


አንድ ፡ አምላክ ፡ በሚሆን ፡ በአብ
በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም
በዕውነት ፡ እናምናለን ።

፩ ፤ አቤቱ ፡ ይቅር ፡ ባይ ፡ አምላ
ካችን ፡ ሆይ ፤ አንተን ፡ እናምናለን ፤
ከሂሎት ፡ የአንተ ፡ ብቻ ፡ የሚሆን ፡
አንተን ፡ እንማልዳለን ፤ አንተን ፡
እንማፀናለን ።

፪ ፤ አቤቱ ፤ በፍፁም ፡ ዕምነት ፡
ለለመኑህ ፡ ሁሉ ፡ ያለመከልከል ፡
የልመናቸውን ፡ ዋጋ ፡ በትክክል ፡ የም
ትሰጣቸው ፡ አምላካችን ፡ ሆይ ፡ አን
ተን ፡ እንማልዳለን ።

፫ ፤ አቤቱ ፡ እደ ፡ የማገህ ፡ የሕይ
ወት ፡ ምንጭ ፡ ነው ፤ እደ ፡ መዝራ
ዕትህ ፡ የደስታ ፡ መፍለቂያ ፡ ነው ፤

ከሰአልናከ ፣ በፊት ፡ የሚጸለይ ፣ ከዳ
ዊት ፣ መዝሙርና ፡ ከነቢያት ፣ ጸሎት
መዝሙር ፣

ሶበ ፣ ጸዋክዎ፡ ለእግዚአብሔር ፬
እግዚአብሔር ፣ ይሬእየኒ ፣ ፳፪
አምላከ ፡ አማልክት ፣ ፵፱
ተሣሃለኒ እግዚኦ በከመ ዕበየ ሣህልከ ፶
ለከ ፡ ይደሉ ። ፷፬
እግዚአብሔር ፣ ይባርከነ ፣ ፷፯
ጥቀ ፡ ፍቁር ፡ ፹፫
አመንኩ ፡ በዘነበብኩ ፣ ፻፲፰

ጸሎተ ፣ ነቢያት

ጸሎተ፣ ሐና፣ እመ፣ ሳሙኤል፣ ነቢይ ፣ ፬
ኀበ፣ባረኩ፣አናንያ፡ወአዛርያ፡ወሚሳኤል ፲
ጸሎ ተ ፡ እግዝእትነ ፡ ማርያም ፲፫
ጸሎተ ፣ ስምዖን ፡ ነቢይ ፣ ፲፰




አንድ ፡ አምላክ፡ በሚሆን ፡ በአብ
በወልድ ፣ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም
በዕውነት ፣ እናምናለን ።

፩ ፤ አቤቱ ፣ ይቅር ፣ ባይ ፣ አምላ
ካችን ፡ ሆይ ፤ አንተን ፣ እናምናለን፤
ከሂሎት ፡ የአንተ ፡ ብቻ ፣ የሚሆን፣
አንተን ፣ እንማልዳለን ፤ አንተን ፣
እንማፀናለን ።

፪ ፤ አቤቱ ፤ በፍፁም ፣ ዕምነት ፣
ለለመኑህ ፣ ሁሉ ፡ ያለመከልከል ፣
የለመናቸውን ፡ ዋጋ፡በትክክል፣የም
ትሰጣቸው ፣ አምላካችን ፣ ሆይ፤ አን
ተን ፡ እንማልዳለን ።

፫ ፤ አቤቱ ፣ እደ ፣ የማኀህ ፡ የሕይ
ወት ፣ ምንጭ ፣ ነው ፤ እደ ፡ መዝራ
ዕትህ ፣ የደስታ ፣ መፍለቂያ ፣ ነው ፤

እደ ፡ ሥልጣንህ ፡ ኅብስተ ፡ ሕይወት
ጽዋ ፡ መድኃኒት ፡ ነው ፤ እደ ፡ ቸርነ
ትህ ፡ የረድኤት ፡ የበረከት ፡ መፍ
ሰሻ ፡ ነው ።

፬ ፤ አቤቱ ፡ እደ ፡ ሥልጣንህ ፡
የይቅርታና ፡ የምሕረት ፡ መገኛ ፡
ነው ፤ እደ ፡ ትዕግሥትህ ፡ የርኅራኄና
የቸርነት ፡ መፍለቂያ ፡ ነው ። እደ ፡
ኩርናዕህ ፡ የሕግና ፡ የሥርዓት ፡
መዝገብ ፡ ነው ።

፭ ፤ አቤቱ ፡ እደ ፡ አድኅኖትህ ፡
የምግባር ፡ የሃይማኖት ፡ መሠረት ፡
ነው ፤ እደ ፡ እዘዝህ ፡ የንስሐ ፡ የሥር
የተ ፡ ኃጢአት ፡ ጕዳና ፡ ነው ።

፮ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ በሰማያውያን ፡ መላእ



ክት ፡ በምድራውያን ፡ ጻድቃን ፡
ሰማዕታት ፡ በረከት ፡ ባርከን ። አሜን
(ይህን ፡ ሦስት ፡ ጊዜ ፡ ጸልይ)

፯ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ ትጉሃን ፡ በሚሆኑ ፡
መላእክት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን

፰ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ የብርሃን ፡ ዙፋን ፡
በተሸከሙ ፡ አርባዕቱ ፡ እንስሳ ፡ በረ
ከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፱ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ በተመረጡ ፡ በሃያ ፡
ዐራቱ ፡ ካህናተ ፡ ሰማይ ፡ በረከት ፡
ባርከን ፡ አሜን ።

፲ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ
ሆይ ፤ በሚካኤልና ፡ በገብርኤል ፡

በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፩ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ በሱራፌልና ፡ በኪሩቤል በረከት ፡ ባርከን ፤ አሜን ።

፲፪ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ በሩፋኤልና ፡ በዑራኤል በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፫ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ በሳቁኤልና ፡ በፋኑኤል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፬ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ በራሙኤልና ፡ በሱራያል ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፭ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ በአፍኒንና ፡ በሰዳክያል በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፮ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ ምስጋና ፡ የዘወትር ፡ ተግባራቸው ፡ በሆነ ፡ ዘጠና ፡ ዘጠኙ ፡ ነገደ ፡ መላእክት ፡ በረከት ፡ ባርከን አሜን ።

፲፯ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ ክቡራን ፡ በሚሆኑ ፡ በዓሥራ ፡ አምስቱ ፡ ነቢያት ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፲፰ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ ወንጌልን ፡ ባስተማሩ ፡ በዓሥራ ፡ ሁለቱ ፡ ሐዋርያት ፡ በረከት ባርከን ፡ አሜን ።

፲፱ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፤ ላእካነ ፡ ወንጌል ፡ በሆኑ ሰባ ፡ ሁለቱ ፡ አርድእት ፡ በረከት ፡

ባርከን ፡ አሜን ።

፳ ፤ አቤቱ፡ አምላካችን፡ ክርስቶስ
ሆይ ፤ ትምህርተ ፡ ወንጌልን ፡ በተከ
ተሉ ፡ በአምስት፡ መቶ፡ ባልንጀሮች
በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፩ ፤ አቤቱ፡ አምላካችን፡ ክርስቶስ
ሆይ ፤ ጽንዐ ፡ መከራን ፡ በአቸናፊ
ነት፡ በተወጡ፡ ሰማዕታት ፡ በረከት
ባርከን ፡ አሜን ።

፳፪ ፤ አቤቱ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ፡ ሆይ ፤ ፍትወታት ፡ ኃጣውእን
ድል ፡ በነሡ ፡ ቡሩካን ፡ ጻድቃን ፡
በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፫ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ በንጹሐን ፡ ደናግል ፡
በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።



፳፬ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክር
ስቶስ፡ ሆይ ፤ በበቁ ፡ ፍጹማን ፡ በሆኑ
መነኰሳት ፡ በረከት ፡ ባርከን፡ አሜን

፳፭ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ በዓሥራ ፡ አራት ፡ ሺህ
ዓራት ፡ መቶ ፡ ምርጥ ፡ ሕፃናት ፡
በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፮ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ ሃይማኖታቸው ፡ የቀና
በሦስት ፡ መቶ ፡ ዓሥራ ፡ ስምንቱ ፡
ሊቃውንት፡ በረከት፡ ባርከን፡ አሜን

፳፯ ፤ አቤቱ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ ቡሩካን ፡ በሚሆኑ ፡
በሊቃነ፡ ጳጳሳትና ፡ ኤጲስ ፡ ቆጶሳት
በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።

፳፰ ፤ አቤቱ፡ አምላካችን ፡ ክርስ

ቶስ፡ ሆይ ፤ አገልጋዮችህ ፡ በሚሆኑ
ቀሳውስትና ፡ ዲያቆናት ፡ በረከት ፡
ባርከን ፡ አሜን ።
፳፱ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክር
ስቶስ ፡ ሆይ ፤ በሁለቱ ፡ ሰንበታት
በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን ።
፴ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ በቅድስት ፡ ቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡ አሜን
፴፩ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክር
ስቶስ ፡ ሆይ ፤ የቅድስት ፡ ቤተ፡ ክር
ስቲያን ፡ መሪዎቿ ፡ በሚሆኑ ፡ በዐ
ራቱ ፡ ወንጌላውያን ፡ በረከት ፡ ባር
ከን ፡ አሜን ።
፴፪ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ያለመለወጥ ፡ አምላክን



የወለደች ፡ በድንጋሌ ፡ ሥጋ ፡ በድ
ንጋሌ ፡ ነፍስ የጸናች ፡ በክብርት ፡
እመቤታችን ፡ በረከት ፡ ባርከን ፡
አሜን ።
፴፫ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ ጸጋን ፡ የምትሰጥ ፡ ብር
ሃንን፡ የምታጐናጽፍ፡ በዚያን ፡ ጊዜ
ከወዳጆችህ ፡ ጋራ ፡ በቀኝህ ፡ ታቆ
መን ፡ ዘንድ ፡ ባርከን ፡ አሜን ።
፴፬ ፤ አቤቱ ፡ የእግዚአብሔር ፡
አብ ፡ የባሕርይ ፡ ልጁ ፡ ከድንግል፡
ማርያም ፡ ከሥጋዋ ፡ ሥጋ ፡ ከነ
ፍሷ ፡ ነፍስ ፡ ነስተህ ፡ የተወለድህ ፡
ዕውነተኛ ፡ አምላክ ፡ ኢየሱስ ፡ ክር
ስቶስ ፡ ሆይ ፤ ከገቢረ ፡ ሠናይ ፡ የቆ
ራብን ፤ ከገቢረ ፡ ጽድቅ ፡ የተጠ

ማን ፡ እኛ ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ አገ
ልጋዮችህ ፡ ምስጋናህን ፡ በማያዘ
ናጋ ፡ ገንዘብ ፡ ለዘላለሙ ፡ ከዚህ ፡
ኀብስት ፡ በልተን ፡ እንጠግብ ፡ ዘንድ ፤
ከዚህም ፡ ጽዋ ፡ ጠጥተን ፡ እንረካ ፡
ዘንድ ፤ ንዕድ ፡ ክብርት ፡ የምትሆን ፡
መለኮታዊት ፡ እጅህን ፡ ልዑል ፡
ክንድህን ፡ ልከህልን ፡ በዚህ ፡ ኀብ
ስትና ፡ በዚህም ፡ ጽዋ ፡ ላይ ፡ በረከ
ትህን ፡ አሳድር ፡ አሜን ።

፻፫ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኀብስት ፤
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ከፈቃደ ፡ ሥጋ ፡
የሚያነፃ ፡ ዕንቅልፍ ፡ የማያበዛ ፡
ጸሎትን ፡ የማያስተጓጉል ፡ አድር
ገው ፡ አሜን ።

፻፬ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኀብስት ፡



ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ጥላቻና ፡ ክፋትን ፡
የማያሳስብ ፡ በቀልን ፡ የሚያርቅ ፡
አድርገው ፡ አሜን ።

፻፭ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኀብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ችግርን ፡ የማያመጣ ፤
ሁከትን ፡ የሚያስወግድ ፡ አድር
ገው ፡ አሜን ።

፻፮ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኀብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ቁጣን ፡ አርቆ ፡
ትዕግሥትን ፡ የሚያሰጥ ፡ አድር
ገው ፡ አሜን ።

፻፯ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኀብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ለአፍ ፡ የማይመር ፡
ጕሮሮ ፡ የማያሳንቅ ፤ ሆድ ፡ የማይ
ሳምም ፡ ደዌን ፡ አጥፍቶ ፡ ፈውስ ፡
የሚያሰጥ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ያዘኑትን ፡ የሚያ
ስደስት ፤ የተከዙትን ፡ የሚያረ
ጋጋ ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፩ ፤ አቤቱ ፤ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ በኃጢአት ፡ የተዳ
ደፈውን ፡ ሥጋችንን ፡ የሚያድስ ፡
ርኵሳን ፡ መናፍስትን ፡ የሚሸር ፡
የሚሸረሽር ፡ አድርገው ፡ አሜን ።

፵፪ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ የልቡና ፡ ስስት ፡
ያለበትን ፡ የሚያራራ ፡ የኀሊናንም ፡
ነውር ፡ የሚያጠፉ ፡ አድርገው ፡
አሜን ።

፵፫ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ ሕሙም ፡ የሚፈ



ውስ ፡ ደካማውን ፡ የሚያጸና ፡ አድ
ርገው ፡ አሜን ።

፵፬ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ መርገምን ፡ የሚያ
ጠፋ ፤ ሰላምን ፡ የሚያመጣ ፡ አድ
ርገው ፡ አሜን ።

፵፭ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ በመዓልትና ፡ በሌ
ሊት ፡ በየሰዓቱም ፡ ሁሉ ፡ ክፉ ፡
የማያሳስብ ፤ በጸሎትም ፡ ጊዜ ፡ ስና
ፍን ፡ ለጸሎት ፡ የሚያተጋ ፡ አድር
ገው ፡ አሜን ።

፵፮ ፤ አቤቱ ፡ ይህን ፡ ኅብስት ፡
ይህንም ፡ ጽዋ ፡ የዕውቀትና ፡ የ
በብ ፡ መፍለቂያ ፡ ምንጭ ፤ የዘማ
ሬና ፡ የምስጋና ፡ መፍሰሻ ፡ ወንዝ ፤

የፍቅርና፡ የሰላም፡ መገናኛ፡ ወደብ፡
አድርገው፡ አሜን።
፵፯፤ አቤቱ፡ ይህን፡ ኅብስት፡
ይህንም፡ ጽዋ፡ የነፍስና፡ የሥጋ
ችን፡ ጠላት፡ ዲያብሎስን፤ በፊትህ፡
ተከራክሮ፡ ድል፡ የሚነሣ፡ አድ
ርገው፡ አንተ፡ ቀድሞ፡ የነበርክ፤
ዛሬም፡ ያለህ፡ ለዘለዓለሙም፡ የም
ትኖር፡ አልፋ፡ ወዖ፡ የምትባል፡
አምላክ፡ ነህና።
፵፰፤ አቤቱ፡ ይህን፡ ኅብስት፡
ይህንም፡ ጽዋ፡ የኃጢአት፡ ሁሉ፡
ማስተሥረያ፡ አድርገው። አቤቱ፡
መድኃኒት፡ ሥራይ፡ ወይም፡ መርዝ
በውስጡ፡ ቢጨመርበት፡ እንኳ፡ በቅ
ዱስ፡ ስምህ፡ ሽረህ፡ አብርሰህ፡



ዘርዝረህ፡ አጥፋው፡ አሜን።
፵፱፤ አቤቱ፡ ይህ፡ ኅብስት፡
የዕውነት፡ የጽድቅ፡ መብል፤ ይህም፡
ጽዋ፡ የሕይወት፡ መጠጥ፡ ይሁ
ን፡ በዕውነት፡ ለዘላለሙ፡ አሜን።
፶፤ አቤቱ፡ አምላካችን፡ ክርስ
ቶስ፡ ሆይ፤ ይህን፡ ኅብስት፡ ይህ
ንም፡ ጽዋ፡ ባርከህ፡ ስጠን፡ አሜን፤
፶፩፤ አቤቱ፡ አምላካችን፡ ክርስ
ቶስ፡ ሆይ፤ ይህን፡ ኅብስት፡ ይህ
ንም፡ ጽዋ፡ ባርከህ፡ አክብረህ፡
ስጠን፡ አሜን።
፶፪፤ አቤቱ፡ አምላካችን፡ ክርስ
ቶስ፡ ሆይ፤ ይህን፡ ኅብስት፡ ይህ
ንም፡ ጽዋ፡ ንጹሕ፡ አድርገህ፡
ስጠን፡ አሜን።

፹፫ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክርስ
ቶስ ፡ ሆይ ፤ ይህን ፡ ኅብስት ፤ ይህንም
ጽዋ ፡ በበጐ ፡ መዓዛ ፡ አሻተህ ፡
ስጠን ፡ አሜን ።

፹፬ ፤ አቤቱ ፡ አምላካችን ፡ ክር
ቶስ ፡ ሆይ ፤ ይህን ፡ ኅብስት ፡ ይህ
ንም ፡ ጽዋ ፡ በፍጹም ፡ ክብር ፡
አክብረህ ፡ አስምረህ ፡ ትሰጠን ፡
ዘንድ ፡ በአንድነት ፡ ስምህን ፡ እን
ጠራለን ፡ የእግዚአብሔርን ፡ ስም
የጠራ ፡ ሁሉ ፡ ይድናልና ፡ ለዘላ
ለሙ ፡ አሜን ።

አቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ጸሎተ ፡
ሃይማኖትን ፡ በል ።